ኵሉ ፡ አሐዱ ፡ አሐዱ ፡ እምኔክሙ ፡ እምይእዜ ፡ ይርዐይዎሙ ፡ ለአባግዕ ፡
ከእናንተ ፡ አንዱም ፡ አንዱ ፡ ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ እስራኤልን ፡ ይጠብቋ ቸው ፡ ዘንድ ፡ ጠብቁ ፡ አለ ፡
ወኵሉ ፡ ዘእኤዝዘክሙ ፡ አነ ፡ ግበሩ ፡
እኔም ፡ የማዝዛችሁን ፡ ሁሉ ፡ አድርጉ ፡ አላቸው ፡
፫ ፡ ወእሜጥወክሙ ፡ አነ ፡ በኍልቍ ፡
ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡ አንድም ፡ ሕዝቡን ፡ በቍጥር ፡ እሰጣ ችኋለሁ ፡
ወእነግረክሙ ፡ ዘይትኀጐል ፡ እምኔ ሆሙ ፡
ከነርሱም ፡ የሚጠፋውን ፡ እኔ ፡ እነግራችኋለሁ ፡
ወኪያሆሙ ፡ አኅጕሉ ፡
እነርሱንም ፡ አጥፉ ፡
ወመጠወ፡ ሎሙ ፡ እልክተ ፡ አባግዐ፡
እነዚህ ፡ እስራኤልንም ፡ ጠብቁ ብሎ ፡ ሰጣቸው ፡
፬ ፡ ወለካልዕ ፡ ፀውዖ ፡
ቅዱስ ፡ ሚካኤልን ፡ ጌታ ፡ ጠራው ፡
ከሰው ፡ በግብርም ፡ በባሕርይም ፡ ልዩ ፡ ነውና ፡ ካልዕ ፡ አለው ፡
ወይቤሎ ፡ ለቡ ፡ ወርኢ ፡ ኵሎ ፡ ዘይገብሩ ፡ ኖሎት ፡ ዲበ ፡ እሉ ፡ አባግዕ ፡
በእነዚህ ፡ እስራኤል ፡ ላይ ፡ መምህራኑ ፡ የሚያደርጉትን ፡ ጥፋት ፡ ሁሉ ፡ አይተህ ፡ ልብ አድርገው ፡ አለው ፡
እስመ ፡ ያኀጕሉ ፡ እምውስቴቶሙ ፡ ፈድፋደ ፡ እምዘአዘዝክዎሙ ፡
ካዘዝኋቸው ፡ ወጥተው ፡ አንድም፡ ካዘዝኋቸው ፡ አትርፈው ፡ መም ህራኑን ፡ ነገሥታቱን ፡ ከሕዝቡ ፡ ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ይልቅ ፡ አጥ ፍተዋልና ፡
፭ ፡ ወኵሎ ፡ ጽጋበ ፡ ወኀጕለ ፡ ዘይትገበር ፡ በኖሎት ፡ ጸሐፍ ፡
የሚደረገውን ፡ ተድላ፡ ደስታ ፡ በነገሥታቱ ፡ በመምህራኑ ፡ ዕዳ ይሆናል ፡ ብለህ ፡ ጻፍ ፡
ሚመጠነ ፡ የኀጕልዎሙ ፡ በትእዛዝየ ፡
አዝዤቸው፡ ምን ፡ ያህል ፡ ያጠ ፏቸው ፡ እንደሆን ፡
ወሚመጠነ ፡ የኀጕሉ ፡ በርእሶሙ ፡
ሳላዝዛቸው ፡ ምን ፡ ያህል ፡ በራሳቸው ፡ ያጠፉ ፡ እንደሆን ፡
፮ ፡ ወኵሎ ፡ ኀጕሎሙ ፡ ለለአሐዱ፡ አሐዱ ፡ ኖላዊ ፡ ጸሐፍ ፡ ዲቤሆሙ ፡
አንዱም ፡ አንዱም ፡ ንጉሥ ፡ የሚያጠፉትን ፡ ጥፋት ፡ ሁሉ ፡ በእነሱ ፡ ላይ ፡ ጻፈው ፡
ወበኍልቍ ፡ አንብብ ፡ በቅድሜየ ፡
በፊቴም ፡ በቍጥር ፡ አንብብ ፡
ወሚመጠነ ፡ የኀጕሉ ፡
ምን ፡ ያህል ፡ ያጠፏቸው ፡ እንደሆነ ፡

ወሚመጠነ ፡ ይሜጥውዎሙ ፡
ለኃጕል ፤
ምን ፡ ያህል ፡ ለጥፋት ፡ ይሰጧ
ቸው ፡ እንደሆነ ፤
[illegible] ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ሊተ ፡ ዝንቱ ፡
ስምዐ ፡ ዲቤሆሙ ፤
በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ለኔ ፡ ምስክር ፡
ይሆነኝ ፡ ዘንድ ፤
ከመ ፡ አእምር ፡ አነ ፡ ኵሎ ፡ ግብ
ሮሙ ፡ ለኖላውያን ፤
የነገሥታቱን ፡ ሥራቸውን ፡
ሁሉ ፡ መርምሬ ፡ አውቅ ፡
ዘንድ ፡ ይህ ፡ ምስክር ፡ ሊሆነኝ
ጻፍ ፤
፰ ፡ ወእመጥዎሙ ፡ ወእርአይ ፡
ዘይገብሩ ፡ ለእመ ፡ ይነብሩ ፡ በት
እዛዝየ ፡ ዘአዘዝክዎሙ ፡ ወእመ ፡
አልቦ ፤
በአዘዝኋቸው ፡ ትእዛዝ ፡ ጸንተው ፡
ይኖሩ ፡ እንደሆነ ፤ አይኖሩም ፡
እንደሆነ ፡ የሚያደርጉትን ፡ አይቼ፡
እሰጣቸው ፡ ዘንድ ፡ ጻፍ ፡ አለው ፤
[illegible] ፡ ወኢያእምሩ ፡ ወኢታርእዮሙ ፡
ወኢትዝልፎሙ ፤
የምትጽፍባቸውን ፡ ኃጢአታቸ
ውን ፡ አይወቁ ፤ አንተም ፡ አታ
ሳያቸው ፡ አለ ፤
አላ ፡ ጸሐፍ ፡ ኵሎ ፡ ኃጕሎሙ ፡
ለኖላውያን ፡ በበጊዜሁ ፡ ለለአሐዱ ፡
አሐዱ ፤

በጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ያንዱንም ፡
ያንዱን ፡ የነገሥታቱን ፡ ኃጢ
አት ፡ ሁሉ ፡ ጻፍ ፡ እንጂ ፤
ወአዕርግ ፡ ኀቤየ ፡ ኵሎ ፤
ሁሉንም ፡ ጽፈህ ፡ ወደኔ ፡ አም
ጣው ፡ እንጂ ፤
፲ ፡ ወርኢኩ ፡ እስከ ፡ ሶበ ፡ እልኩ ፡
ኖላውያን ፡ ይርዕዩ ፡ በበጊዜሁ ፤
እኒህም ፡ ነገሥታቱ ፡ በየሹመ
ታቸው ፡ እስኪጠብቋቸው ፡
ድረስ ፡ ደርሼ ፡ አየሁ ፤
ወአኀዙ ፡ ይቅትሉ ፡ ወያኀጕሉ
ብዙኀነ ፡ እምትእዛዞሙ ፤
ከትእዛዛቸው ፡ ወጥተው ፡ ብዙ
ያጠፉ ፡ ጀመር ፤ አንድም ፡ ካዘ
ዝኋቸው ፡ አትርፈው ፡ መምህ
ራኑን ፡ ነገሥታቱን ፡ ከደቀ ፡
መዛሙርቱ ፡ ከሕዝቡ ፡ አጥፍ
ተዋልና ፤
፲፩ ፡ ወኀደጉ ፡ እልክተ ፡ አባግዐ ፡
ውስተ ፡ እደ ፡ አናብስት ፤
ነገሥታቱም ፡ እኒህን ፡ እስራኤ
ልን ፡ በባቢሎን ፡ ሰዎች ፡ እጅ ፡
ጣሏቸው ፤
ወበልዑ ፡ ወውኅጡ ፡ መብዝኅቶሙ ፡
ለእልኩ ፡ አባግዕ ፡ አናብስት ፡ ወአና
ብርት ፤
የፋርስና ፡ የባቢሎን ፡ ሰዎችም
ከእስራኤል ፡ ብዙዎችን ፡ ፈጽ
መው ፡ አጠፏቸው ፤

ወሐራውያ ፡ ገዳም ፡ በልዑ ፡ ምስሌሆሙ ።

ኤዶማውያን ፡ ከፋርስ ፣ ከባቢሉን ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ አጠፏቸው ፤ አንተኒ ፡ ኮንከ ፡ ከመ ፡ አሐዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ እንዲል ፤

፲፪ ፤ ወአውዐይዎ ፡ ለዝኩ ፡ ማኅፈድ ፤

ቤተ ፡ መቅደስንም ፡ አቃጠሉት ፤

ወከረይዎ ፡ ለዝኩ ፡ ቤት ፡ ዘአባግዐ ፡ እስራኤል ፡ የሚጠበቁበት ፡ ይህንንም ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ቆፈሩት ፤ አፈረሱት ፤

፲፫ ፤ ወኀዘንኩ ፡ ብዙኀ ፡ ጥቀ ፡ በእንተ ፡ ማኅፈድ ፡ እስመ ፡ ተከርየ ፡ ውእቱ ፡ ቤት ፡ ዘአባግዐ ፤

ስለቤተ ፡ መቅደስ ፡ ፈጽሜ ፡ እጅግ ፡ አዘንኩ ፤ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ፈርሷልና ፤

፲፬ ፤ ወእምኔሁ ፡ ኢክህልኩ ፡ ርእዮቶሙ ፡ ለእልኩ ፡ አባግዐ ፡ ለእመ ፡ ይበውኡ ፡ ኀበ ፡ ዝኩ ፡ ቤት ፡ ወለእመ ፡ ኢይበውኡ ፤

ከዚያም ፡ በኋላ ፡ እነኚህ ፡ እስራኤል ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ይገቡም ፡ እንደሆነ ፡ አይገቡም ፡ እንደሆነ ፡ እነርሱን ፡ ማየት ፡ አልተቻለኝም ፤

፲፭ ፤ ወኖላውያን ፡ ወፀማዶሙ ፡ መጠውዎሙ ፡ ለእልኩ ፡ አባግዐ ፡ ለኵሉሙ ፡ አራዊተ ፡ ገዳም ፡ ከመ ፡ ይብልዕዎሙ ፤

ነገሥታቱ ፡ መኳንንቱ ፤ አንድም ፡ መምህራኑ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ ሕዝቡን ፡ ያጠፏቸው ፡ ዘንድ ፡ ለአሕዛብ ፡ አሳልፈው ፡ ሰጧቸው ፤

፲፮ ፤ ወኵሉ ፡ አሐዱ ፡ አሐዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ በበጊዜሁ ፡ በኊልቊ ፡ ይትሜጠው ፤

ከእነርሱ ፡ አንዱም ፡ አንዱም ፡ ሁሉ ፡ በየሹመቱ ፡ በቍጥር ፡ ይቀበላል ፤

ወኵሉ ፡ እምኔሆሙ ፡ አሐዱ ፡ አሐዱ ፡ ለካልዑ ፡ በመጽሐፍ ፡ ይጽሕፍ ፤ ሚመጠነ ፡ ያኀጉል ፡ እምኔሆሙ ፡ ለካልዑ ፡ በመጽሐፍ ፤

ከእነርሱ ፡ ቀጥሎ ፡ የሚሾመው ፡ ምን ፡ ያህል ፡ እንደ ፡ አጠፋ ፡ በመጽሐፍ ፡ ይጽፋል ፤ እኔ ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ አጥፍቻለሁ ፤ አንተም ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ አጥፋ ፤ የሚለው ፡ ሁኖ ፡ አይደለም ፤ አንዱን ፡ አይቶ ፡ አንዱ ፡ የሚያደርገው ፡ ስለሆነ ፤

ወፈድፋደ ፡ እምሥርዓቶሙ ፡ አሐደ ፡ አሐደ ፡ ይቀትል ፡ ወያኀጉል ፤

ይልቁንም ፡ ከሥርዓታቸው ፡ ወጥተው ፤ ከሥርዓታቸው ፡ አትርፈው ፡ አንዱንም ፡ አንዱንም ፡ ይገድላል ፤

፲፯ ። ወአነ ፡ አንገዝኩ ፡ እብኪ ፡
ወእዕዊ ፡ ብዙኀ ፡ ጥቀ ፡ በእንተ ፡
እልኩ ፡ አባግዕ ፤
እኔም ፡ ስለእነዚሁ ፡ ስለእስራኤል፡
ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ፈጽሜ ፡ አለቀስ ፡
ጀመር ።
፲፰ ፤ ወከመዝ ፡ በራዕይ ፡ ርኢክዎ ፡
ለዝኩ ፡ ዘይጽሕፍ ፡ እፎ ፡ ይጽሕፍ
ለአሐዱ ፡ ዘይትኀጐል ፡ እምነ ፡ እልኩ፡
ኖላውያን ፡ በኵሉ ፡ ዕለት ፤
ከነገሥታቱ ፤ ከመምህራኑ ፤ ያተ
ነሣ ፡ የሚጠፋውን ፡ አንዱም ፡
አንዱን ፡ እንዲጽፍ ፡ የሚጽፈው ፡
ቅዱስ ፡ ሚካኤልን ፡ በራእይ ።
አየሁ ፤
፲፱ ፤ ወየዐርግ ፡ ወየዐርፍ ፡ ወያርኢ
ኵሎ ፡ ኪያሁ ፡ መጽሐፈ ፡ ለእግዚአ
አባግዕ ፡ ኵሎ ፡ ዘገብሩ ፤
ለእስራኤል ። ጌታ ። ለእግዚአብሔ
ርም ፡ ያንን ፡ መጽሐፍ ፡ ሁሉ ።
የሚሠሩትንም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡
አውጥቶ ፡ ሲያኖረው ፡ አየሁ ፤
ወኵሎ ፡ ዘእዕተቱ ፡ አሐደ ፡ አሐደ ፡
እምኔሆሙ ፡ ወኵሎ ፡ ዘመጠዉ ፡
ለኀጐል ፤
ከነገሥታቱ ፡ አንዱንም ፡ አንዱ
ንም ፡ በሞት ፡ ያራቀውን ፤ አን
ድም ፡ ከሕዝቡ ። አንዱንም ።
አንዱን ፡ በሞት ፡ ያራቀውን ፤
ሁሉ ፡ ለጌታ ፡ አሳየ ፤
፳ ፤ ወመጽሐፍ ፡ ተነበ ፡ በቅድመ ።
እግዚአ ፡ አባግዕ ።
መጽሐፉም ። በእሥራኤል ፡ ጌታ፡
ፊት ። ተነበበ ፤
ወነሥአ ፡ ለመጽሐፍ ፡ በእዱ ፤
ቅዱስ ፡ ሚካኤል ። መጽሐፉቱን ።
በእጁ ። አነሣት ።
ወአኀበባ ፤
አነበባት ፤
ወሐተማ ፡ ወአንበራ ፤
ጠቅልሎ ፡ አስቀመጣት ፤ አን
ድም ፡ ጌታ ፡ በእጁ ፡ አነሣት ፤
አነበባት ። ጠቅልሎ ። አስቀመ
ጣት ፤ የመምህራኑ ፤ የነገሥታቱ፡
ክፋታቸው ፤ ኃጢአታቸው ፡ ለቅ
ዱስ ። ሚካኤል ፡ የተገለጸለት ፤
ለጌታ፡ ተሰውሮት ፡ አይደለም ፤
ጌታ ። ክፋታቸውን ፤ ኃጢአታቸ
ውን ፡ አውቆ ፡ እንደታገሣቸው
ለማጠየቅ ፤ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡
ክፋታቸውን ፡ ኃጢአታቸውን ፡
አውቆ ፡ እንዲለምንላቸው ፡ ለማ
ጠየቅ ፡ ነው ።
፳፩ ፤ ወእምኒሁ ፡ ርኢኩ ፡ እንዘ ፡
ይርዕዩ ፡ ኖሎት ፡ ፲ተ ፡ ወ፪ተ ፡ ሰዓተ ፤
ነገሥት ፡ ባቢሎን ፡ አሥራ ፡
ሁለት ፡ ሎባኤ ። ሲገዙ ፡ አየሁ ፤
ወተቀንየ ። ሎቱ ፡ ኤልያቄም ፡
፫ተ ። ዓመተ[1] ፡ ይላል ፤ ሦስት ፡
ዓመት ፡ ለናቡከደነፆር ፡ ተገዝ

፩ ። ፪ ነገ. ፳፬፡፩

ቷል ፤ የሴዴቅያስ ፡ ፲፩ዱን ፤
ዘመን ፡ ቢገጥሙት ፡ ፱ት ፡
ሱባዔ ፤ የነገሥተ ፡ ባቢሉን ፡
፸ ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ በነገሥታቱ ፡
ዘመን ፡ ይታወቃል ፤ የናቡከደነ
ፆር ፡ ፳፭ ፤ የዮልማሮዴቅ ፡ ፳፪ ፤
የብልጣሶር ፡ ሃያ ፡ ሦስት ፤ ይህ
ንን ፡ ቢገጥሙት ፡ ሰባ ፡ ይሆ
ናል ፤ ፸ው ፡ ፲ ሱባዔ ፤ ይሆ
ናል ፤ ሁሉንም ፤ ቢገጥሙት ፡
፲፱ ሱባዔ ፡ ይሆናል ፤
ወናሁ ፡ ፫ቱ ፡ እምእልኩ ፡ አባግዕ ፡
ገብኡ ፤ ወመጽኡ ፡ ወቦኡ ፤
ከተማረኩት ፡ ሦስቱ ፤ በሚጠት ፡
ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተመለሱ ፤
ሐጌ ፤ ዘካርያስ ፤ ሚልክያስ ፤
እሊህስ ፡ መውጣታቸው ፡ ነው
እንጂ ፤ መውረዳቸው ፡ አልታ
ወቀም ፤ ብሉ ፤ ኤርምያስ ፤ ነሕ
ምያ ፤ ካልእ ፡ ዕዝራ ፡ ናቸው ፤
፳፪ ፤ ወአኀዙ ፡ እንዘ ፡ የሐንጹ ፡
ኵሉ ፡ ዘወድቀ ፤ እምውእቱ ፡ ቤት ፤
ከዚያም ፤ የፈረሰውን ፡ ቤተ ፡
መቅደስ ፤ ይሠሩ ፡ ጀመር ፤
ወሐራውያ ፡ ገዳም ፡ ከልዕዎሙ ፤
አጅማከንታ ፡ እንዳይሠሩ ፡ ከለ
ከሏቸው ፤ አጅማከንታ ፡ የጭ
ፍራ ፡ ስም ፡ ነው ፤ ከኤዶማ
ውያን ፡ ይወለዳሉና ፡ ሐራውያ
አላቸው ፤

ወኢክህሉ ፤
እስራኤል ፡ መሥራት ፡ አልተ
ቻላቸውም ፤ አንድም ፡ ወኢክ
ህሉ ፤ እለአጅማከንታ ፤ መከል
ከል ፡ አልተቻላቸውም ፤ ቂሮስ
ዳርዮስ ፤ ይሥሩ ፤ ብለዋቸዋልና ፤
፳፫ ፤ ወአኀዙ ፡ ካዕበ ፡ ይሕንጹ ፡
ከመ ፡ ቀዳሚ ፤
ዳግመኛም ፡ እንደቀድሞው ፡
ይሠሩ ፤ ጀመር ፤
ወአንሥእዎ ፡ ለውእቱ ፤ ማኅፈድ ፡
ወይሰመይ ፡ ማኅፈደ ፡ ነዊኅ ፤
ቤተ ፡ መቅደስንም ፡ እንደ ፤ ቀድ
ሞው ፡ አደሱ ፤ ታላቅ ፡ ግምብም ፡
ሆነ ፤
[illegible] ፤ ወርኢኩ ፡ ካዕበ ፤ እንዘ ፡ ያን
ብሩ ፡ ቅድመ ፡ ማኅፈድ ፡ ማዕደ ፤
ወኵሉ ፡ ኅብስት ፡ ዘዲቤሁ ፡ ርኩስ ፡
ወዘኢኮነ ፡ ንጹሐ ፤
በማዕዱ ፡ ላይ ፡ የሚቀመጠው
ንጹሕ ፡ ያይደለ ፡ ሰባር ፤ ችነ
ፊር ፤ የመታው ፡ ርኩስ ፡ ኅብ
ስትን ፡ አየሁ ፤ ወኵሉ ፡ ኅብ
ስቱ ፡ ቢል ፡ ንጹሕ ፡ ያይደለ ፤
ርኩሱን ፡ ኅብስት ፡ ሲያኖሩ ፤
አየሁ ፤
፳፭ ፤ ወዲበ ፡ ዙሉ ፡ እሉ ፡ አባግዕ ፤
ከዚህ ፡ ሁሉ ፡ በላይ ፤
ጽሉላን ፡ አዕይንቲሆሙ ፤ ወኢይሬ
እዩ ፡ ወኖሎቶሙኒ ፡ ከማሁ ፤

የእስራኤል ፡ ዓይኖቻቸው ፡ የተ
ጋረዱ ፡ ናቸው ። አያዩም ፤ መም
ህሮቻቸውም ፡ እንዲሁ ፡ ናቸው ፤
ማለት ፡ በድንቁርና ፡ ተይዘዋል ፤
ምስጢርም ፡ አያዩም ፡ ማለት
ነው ።

[redacted] ። ወይሜጥውዎሙ ፡ ለኖሎቶ
ሙ ፡ ለኀጕል ፡ ፈድፋደ ።

ነገሥታቱን ፤ መምህሮቻቸውን ፤
ሕዝቡ ፡ ኃጢአት ፡ ሠርተው ፡
ፈጽመው ፡ ለጥፋት ፡ ይሰጧቸ
ዋል ፤

ወበእገሪሆሙ ፡ ይከይድዎሙ ፡ ለእባ
ግዕ ፡ ወይበልዕዎሙ ፤

በጎቹን ፡ በእግራቸው ፡ ይረግ
ጡአቸዋል ፡ ይበሉአቸዋልም ፡
ነገሥታቱ ፡ ሕዝቡን ፡ መከራ ፡
አጸኑባቸው ፤

[redacted] ። ወእግዚእ ፡ አባግዕ ፡ አርመመ፡
እስከነ ፡ ተዘርዘሩ ፡ ኵሉ ፡ አባግዕ ፡
ገዳመ ።

የእስራኤል ፡ ጌታ ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ በዝዋዌ ፡ ሕዝቡ ፡ እስ
ኪበተኑ ፡ ድረስ ፡ዝም ፡አለ ፤

ወተደመሩ ፡ ምስሌሆሙ ፡ ወኢያድኀ
ንዎሙ ፡ እምእደ ፡ አራዊት ፤

መምህሮቻቸው ፤ ነገሥቶቻቸው ፤
ከአሕዛብ ፡ ጋራ ፡ በግብር ፡ አንድ፡
ሆኑ ፤ ከአሕዛብም ፡ እጅ ፡ አላዳ
ኗቸውም ፤

፷፰ ። ወዝኩ ፡ ዘይጽሕፍ ፡ መጽ
ሐፈ ፡ አዕረጎ ፡ ወአርአዮ ፡ ወአንበበ ፡
ኀበ ፡ አብያተ ፡ እግዚእ ፡ አባግዕ ፤

መጽሐፉን ፡ የሚጽፍ ፡ ይህ ፡
ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ አውጥቶ ፤
ለጌታ ፡ አሳየው ፤ በጌታ ፡ ቤት ፡
በመንግሥተ ፡ ሰማያትም ፡ አነበ
በው ፤

ወያስተበቍዖ፡ በእንቲአሆሙ ፤

ስለ ፡ እነርሱም ፡ ይለምነዋል ፤

[redacted] ። ወይስእሉ ፡ እንዘ ፡ ያርእዮ
ኵሉ ፡ ግብረ ፡ ኖሎቶሙ ፡ ወያስምዕ
በቅድሜሁ ፡ ዲበ ፡ ኵሉ ፡ ኖላውያን፤

የመምህራኑንም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ
እያሳየው ፡ ይለምነዋል ፤ በመም
ህራኑ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ በፊቱ ፡
ያዳኛል ።

ወነሢኦ ፡ አንበረ ፡ ኀቤሁ ፡ ኪያሁ ፡
መጽሐፈ ፤

ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ ያንን ፡ መጽ
ሐፍ ፡ አንሥቶ ፡ አኖረ ፤ አን
ድም ፡ ጌታ ፡ አንሥቶ ፡ አኖረ፤

ወወፅአ ።

ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ ከጌታ ፡
ፊት ፡ ወጣ ፤

፸ ። ወርኢኩ ፡ እስከ ፡ ዘመን ፡ ከመ ፡
ከመዝ ፡ ይርእዩ ፡ ፴ ወ ፯ቱ ፡
ኖላውያን ፤

ሠላሳ ፡ ሰባቱ ፡ ነገሥት ፡ ጽርዕ
እንዲህ ፡ እንዲህ ፡ እስከሚገዙ
በት ፡ ዘመን ፡ ደርሼ ፡ አየሁ ፤

፺፩ ፤ ወፈጸሙ ፡ ኵሎሙ ፡ በበጊ
ዜሆሙ ፡ ከመ ፡ ቀዳምያን ፤
ነገሥት ፡ ጽርዕ ፡ እንደ ፡ ባቢ
ሎናውያን ፡ ገዝተው ፡ ጨረሱ ፤
፺፪ ፤ ወባዕዳን ፡ ተመጠውዎሙ ፡
ውስተ ፡ እደዊሆሙ ፡ ከመ ፡ ይር
አይዎሙ፡ በበጊዜሆሙ ፡ ኵሉ፡ ኖላዊ
በበጊዜሁ፤
ሌሎች ፡ ነገሥታትም ፡ በየሹመ
ታቸው ፡ ይጠብቋቸው ፡ ዘንድ ፡
ከእጃቸው ፡ ተቀበሉአቸው ፡ አለ፤
ሮማውያን ፡ ተቀበሏቸው ፤ ሮማ
ውያንንስ ፡ ያመጣቸዋል ፤ ብሎ ፡
ነገሥት ፡ ባቢሎን ፡በየጊዜያቸው ፡
እንደ ፡ እስራኤል ፡ ገዝተው ፡
ጨረሱ ፤
ወባዕዳን ፤
ዕርዓውያን ፡ ተቀበሏቸው ፤
፺፫ ፤ ወእምዝ ፡ በራእይ ፡ ርኢኩ ፡
ኵሎ ፡ አዕዋፈ ፡ ሰማይ ፤
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በክፍታ ፡ የሚ
ኖሩ ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ በራ
እይ ፡ አየሁ ፤
ወመጽኡ ፡ አንስርት ፡ ወአውስት ፡
ወሆባይ ፡ ወቋዓት ፤
የሞአብና ፡ የአሞን ፡ ሰዎች ፡ ያል
ታወቁ ፡ አሕዛብ ፡ ሮማውያንም ፡
መጡ ፤
ወአንስርት ፡ ይመርሕዎሙ ፡ ለኵሎሙ፡
አዕዋፍ ፤

ሞዓብ ፤ አሞን ፡ ሥርጡን ፡ መን
ገድ ፡ ያውቁታልና ፡ ለአሕዛብ ፡
ጌሻ ፡ እየሆኑ ፡ ይመሯቸዋል ፤
፺፬ ፤ ወአንዙ ፡ ይብልዕዎሙ ፡ ለእ
ልኩ ፡ አባግዕ ፤
እነዚህንም ፡ እስራኤልን ፡ ያጠ
ፉቸው ፡ ጀመር ፤
ወይከርዩ ፡ አዕይንቲሆሙ ፡ ወይብ
ልዕዎ ፡ ለሥጋሆሙ ፤
ዓይናቸውን፡ ያጠፏቸው፡ ጀመረ ፤
አንድም ፡ ነቢያት ፤ ካህናቶቻቸ
ውን ፡ ይገድሏቸው ፡ ጀመረ ፤
ከብቶቻቸውን ፡ ይበሉባቸው ፡
ጀመረ ፤
፺፭ ፤ ወአባግዕ ፡ ጸርሑ ፡ እስከ ፡
ተበልዐ ፡ ሥጋሆሙ ፡ እምነ ፡ አዕዋፍ፤
እስራኤልም ፡ ከአሕዛብ ፡ የተነሣ ፤
ከብታቸው ፡ ተበልቶባቸዋልና ፡
ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጮኹ ፡
ለመኑ ፤
፺፮ ፤ ወአነ ፡ ጸራሕኩ ፡ ወአውየ
ውኩ ፡ በንዋምየ ፡ ዲበ ፡ ውእቱ ፡
ኖላዊ ፡ ዘይርዕዮሙ ፡ ለአባግዕ ፤
እኔም ፡ ተኝቼ ፡ ሳለሁ ፡ ጮህሁ ፤
እስራኤልንም፡ ወደሚጠብቃቸው፡
ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ጮህሁ ፤
፺፯ ፤ ወርኢኩ ፡ እስከ ፡ ተበልዑ ፡
አባግዕ ፡ እምአክላብ ፡ ወእምአንስርት
ወሆባይ ፤
እስራኤል ፡ ከኢሎፍላውያን ፡
ከሞአብ ፡ ከአሞን ፡ የተነሣ ፤

አንድም ፡ ካልታወቁ ፡ አሕዛብ ፡ የተነሣ ፡ ገንዘባቸውን ፡ እስከ ፡ ተበሉ ። ራሳቸው ፡ እስከ ፡ ሞቱ፡ ድረስ ፡ አየሁ ።

፷፰ ። ወኢኃደጉ ፡ ሎሙ ፡ ሥጋ ፡ ግሙራ ።

ከብት ፤

ወኢማእሰ ፤

ልብስ ።

ወኢሥርወ ።

ልጅ ፡ አልተዉላቸውም ።

እስከ ፡ ቆሙ ፡ ባሕቲቶሙ ፡ አዕጽ ምቲሆሙ ።

እናት ፡ አባቶቻቸው ፡ ብቻ ፡ እስከ፡ ቀሩ ፡ ድረስ ።

ወአዕጽምቲሆሙኒ ፡ ወድቁ ፡ ዲበ ፡ ምድር ፡ ወንእሱ ፡ አባግዐ ፡

ወገኖቻቸውም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ጠፉ ። እስራኤልም ፡ ከብዛታ ቸው ፡ አነሱ ።

[redacted] ። ወርኢኩ ፡ እስከ ፡ ዘመን ይርዕዩ ፡ ፳ወ፫ ፡ ኖላውያን ።

፳፫ቱ ፡ ነገሥተ ፡ ሮማውያን ፡ እስከሚገዙበት ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ ደርሼ ፡ አየሁ ። ፶፰ና ፡ ፳፫ ፡ ቢገጥሙት ፡ ፹፩ ነው ።

ወፈጸሙ ፡ በበጊዜሆሙ ፡ ፶ወ፰ተ ጊዜያተ ።

፶፰ ሱባዔ ፡ ገዙ ፡ የሮማውያን ፡ ዘመን ፡ መንግሥታቸው ፡ ፬፻ ዘመን ፡ ነው ። መቶው ፡ አሥራ ፡ አራት ፡ ሱባኤ ፡ ሁኖ ፡ ፪ ዓመት ፡ ይተርፋል ። መቶው ፣ ፲፬ ሁኖ ፣ ፪ ዘመን ፡ ይተርፋል ። ፲ር ፡ ፲ሩ ፡ ፺ ይሆናል ። ፬ት ፡ ፬ቱ ፡ ፲፮ ፡ ይሆናል ። ቢገጥሙት ፡ ፶፮ ፡ ሱባዔ ፡ ይሆናል ። ከሱባዔው ፡ ሁለት ፡ ሁለት ፡ ዘመን ፡ ይተር ፋል ። ፰ ፡ ይሆናል ። አንድ ፡ ሱባዔ ፡ ሁኖ ፡ አንድ ፡ ዘመን ፡ ይተርፋል ። ሱባዔውን ፡ ከየሱ ባዔ ፡ ቢገጥሙት ፡ ፶፰ ፡ ይሆ ናል ። ፶፰ ፡ ግን ፡ ማለቱ ፡ አንድ ፡ ዘመን ፡ ከተጀመረ ፡ ብሎ ።

፺ ። ወንኡሳን ፡ መሐስዓት ፡ ተወ ልዱ ፡ እምእልክቱ ፡ አባግዐ ። ጸዓድው ።

ንዑሳን ፡ ጸዓድው ፡ ብለህ ፡ ግጠም ።

አእምሮ ፡ ካላቸው ፡ ከእኒህ ፡ ዓበይት ፡ ነቢያት ፡ ንኡሳን ፡ ሐዋ ርያት ፡ ተወለዱ ። ንኡሳን ፡ የዘ መን ።

ወአንዙ ፡ ይክሥቱ ፡ አዕይንቲሆሙ ፡

ወይርዕዩ ፡ ወይጽርሑ ፡ ኀበ ፡ አባግዕ፡

የእስራኤል ፡ ዓይነ ፡ ልቡናቸው ንም ፡ ይገልጡ ፡ ጀመር ። ይጠ ብቃሉ ፡ እስራኤልንም ፡ ሙኸው፡ ያስተምሩ ፡ ጀመር ።

፺፩ ። ወአባግዕ ፡ ኢጸርሕዎሙ ፡

ኢሰምዕዎሙ ፡ ሲል ፡ ነው ።

እስራኤል ፡ አልሰሟቸውም ።

ወኢያጽምዑ ፡ ዘነገርዎሙ ።
የነገሯቸው ፡ ነገሩን ፤ አንድም ፡ የነገሯቸው ፤ ሕዝቡም ፡ አልሰሙም ፤
አላ ፡ ፈድፋደ ፡ ተጸመሙ ፡ ወተጸለሉ አዕይንቲሆሙ ፡ ፈድፋደ ፡ ወኃያለ ፤
ፈጽመው ፡ ቸል ፡ ቸል ፡ አሉ ፤ ደነቆሩ ፡ እንጂ ፤
፶፪ ፤ ወርኢኩ ፡ በራእይ ፡ ቋዓት ፡ ከመ ፡ ሠረሩ ፡ ዲበ ፡ እልኩ ፡ መሐስዕ ፤
ሮማውያን ፤ በምዕመናን ፡ ላይ ፈጥነው ፡ እስከ ፤ ተነሡ ፡ ድረስ ፤ ደርሼ ፡ አየሁ ፤
ወአኀዝዎ ፡ ለ፩ዱ ፡ እምእልኩቱ ፡ መሐስዕ ፤
ከእነዚህም ፤ ከሐዋርያት ፤ ለይተው ፤ አንዱን ፤ ዮሐንስን ፡ ያዙት ፤
፶፫ ፤ ወቀጥቀጥዎሙ ፡ ለአባግዕ ፤ ወበልዕዎሙ ፤
ሐዋርያትን ፡ ምዕመናንን ፡ ደበደቧቸው ፤
ወርኢኩ ፡ እስከ ፡ ወፅአ ፡ ሉሙ ፡ አቅርንት ፡ ለእልኩ ፡ መሐስዕ ፤
ለሐዋርያት ፡ ሥልጣን ፡ እስኪሰጣቸው ፡ ድረስ ፤ ደርሼ ፡ አየሁ ፤
ወቋዓት ፡ ያወድቅዎሙ ፡ ለአቅርንቲሆሙ ፤
ሮማውያንም ፡ ሥልጣናቸውን ፤ እናጠፋለን ፤ አሉ ፤

[illegible] ፤ ወርኢኩ ፡ እስከ ፤ በቈለ ፡ ፩ዱ ፡ ቀርን ፤ ዓቢይ ፡ ፩ዱ ፡ እምእልኩ ፡ አባግዕ ፤
ከምዕመናን ፡ አንዱ ፡ የሚሆን ፡ ዓቢይ ፡ አምላክ ፤ የሚሆን ፡ አንድ ፡ ክርስቶስ ፡ እስከ ፤ ተነሣበት ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፤ ደርሼ ፤ አየሁ ፤
ወተከሥታ ፡ አዕይንቲሆሙ ፤
የሐዋርያት ፡ ዓይነ ፡ ልቡናቸው ፡ ተገለጠ ፤
፶፭ ፤ ወርእየ ፡ በሙ ፤
በሐዋርያት ፡ እስራኤልን ፡ አስተማረባቸው ፤
ወተፈትሐ ፡ አዕይንቲሆሙ ፤
ዓይነ ፤ ልቡናቸው ፡ በዕውቀት በራ ፤ ተገለጠላቸው ፤
ወጸርሐ ፤ ሉሙ ፡ ለአባግዕ ፤
ንዑ ፤ ትልዉኒ ፡ ኑ ፤ ተከተሉኝ አላቸው ፡
ወዳቤላት ፡ ርእይዎ ፡ ወሮፁ ፡ ኀቤሁ ኵሉሙ ፤
ሰምዕዎ ፡ ሲል ፤ ነው ፤ ሐዋርያት ፤ ሰሙት ፤ አይተውትም ፤ ወደርሱ ፡ ሄዱ ፤
[illegible] ፤ ወምስለ ፡ ዝ ፤ ኵሉ ፡ እልኩ ፡ አንስርት ፤ ወአውስት ፤ ወቋዓት ፤ መሆባይ ፤ እስከ ፤ ይእዜ ፡ ይመስጥዎሙ ፡ ሰዓባግዕ ፤
ከዚህ ፤ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ እኒህ ፡ ሞዓብ ፤ አሞን ፤ ያልታወቁ ፤

አሕዛብ ፤ ሮማውያን ፤ እስራኤልን ፡ ሐዋርያትን ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ያጠፏቸው ፡ ነበር ፤ ይህም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ከዚህም ፡ ጋራ ፡ እስራኤልን ፡ ይማርኳቸው ፡ ነበር ።

ወይሠርሩ፡ ዲቤሆሙ ፡ ወይበልዕዎሙ ፤
ፈጥነው ፡ ወደ ፡ እነርሳቸው ፡ ሄደው ፡ ያጠፏቸው ፡ ነበር ፤

፵፯ ፤ ወአባግዕሰ ፡ የረምሙ ፡ ወዳ ቤላት ፡ የዓወይዉ ፡ ወይጸርሑ ፤
ሐዋርያት ፡ ግን ፡ ዝም ፡ ብለው ፡ ነበር ፤ ኋላ ፡ ግን ፡ ለእስራኤል ፡ ሐዋርያት ፡ ጩኸው ፡ አስተማሩ ፤

ወእልክቱ ፡ ቋዓት ፡ ይትጋደሉ ፡ ወይትባአሱ ፡ ምስሌሁ ፤
ሮማውያን ፡ ከጌታ ፡ ጋራ ፡ ይጣሉ ፡ ነበር ፤

፵፰ ፤ ወፈቀዱ ፡ ያእትቱ ፡ ቀርኖ ፤
ሥልጣኑን፡ ሊያርቁ ፡ ወደዱ ፤

ወኢክሀልዎ ፤
ጌታን ፡ አልቻሉትም ፤

ወርኢክዎሙ ፡ እስከ ፡ መጽኡ ፡ ናላ ውያን ፡ ወአንስርት ፤
ነገሥታት ፡ የሞአብ ፤ የአሞን ፡ ሰዎች ፡

ወእልኩ ፡ አውስት ፡ ወሆባይ ፤
እነዚህ ፡ ሌሎች ፡ አሕዛብ ፡ እስከ ፡ መጡበት ፡ ዘመን ፡ ደርሼ፡ አየሁ ፤ አንድም ፡ ሰብአ ፡ ሰገል ፡ እስከመጡበት ፡ ዘመን ፡ ደርሼ ፡ አየሁ ፤ ተራ ፡ አልፈለ ገም ፤

፵፱ ፤ ወጸርሑ ፡ ለቋዓት ፡ ከመ ይቀጥቅጥዎ ፡ ለቀርኑ ፡ ዝኩ ፡ ዳቤላ
የክርስቶስን ፡ ሥልጣን ፡ ያርቁ ዘንድ ፡ ያልታወቁ ፡ አሕዛብ ፡ ለሮማውያን ፡ እርዱን ፡ ብለው ፡ ጮኹ ፤

፶ ፤ ወተባአሱ ፡ ወተቃተሉ ፤
ሮማውያን ፡ ከጌታ ፡ ጋራ ፡ ተጣ ልተው ፡ ተጋደሉ ፤

ወውእቱ ፡ ይትበአስ ፡ ምስሌሆሙ ፡ ወጸርሐ፡ ከመ ፡ ትምጽእ ፡ ረድኤቱ ፤
እርሱም ፡ ከእነሱ ፡ ጋር ፡ ተጣላ ፤ ለሰው ፡ የሚያደርጋት ፡ ረድኤቱ ትመጣ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤ አንድም ፡ ረዳኤ ፡ ኵሉ ፡ አምላክ ፡ ነህ ፡ የሚለው ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ ይመጣ ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤

፶፩ ፤ ወርኢኩ ፡ እስከ ፡ መጽአ ፡ ዝኩ ፡ ብእሲ ፡ ዘጸሐፈ ፡ አስማቲ ሆሙ ፡ ለኖሎት ፤
የነገሥታቱን ፤ የመምህራኑን ፡ ስም ፡ የጻፈ ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤል እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡ ደርሼ ፡ አየሁ ፤

፶፪ ፤ ወየዐርግ ፡ ቅድሜሁ ፡ ለእግዚአ ፡ አባግዕ ፤
ወደ ፡ እስራኤል ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ እስከ ፡ ወጣ ፡ ድረስ ፡ ደርሼ ፡ አየሁ ፤

፵፱ ፤ ወውእቱ ፡ ረድአ ፤
እሱም ፡ ረዳኤ ፡ ኵሉ ፤ እምላክ
ነህ ፤ አለው ፤
ወአርአዮ ፡ ኵሉ ፤
ሁሉንም ፡ ገልጦ ፤ አሳየው ፤
ወወረደ ፤ ረድኤቱ ፡ ለዝኩ ፡ ዳቤላ ፤
ይህንንም ፡ ክርስቶስን ፡ ረዳኤ ፡
ኵሉ ፤ አምላክ ፡ ነህ ፡ የሚለው
ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ ወረደ ፤
አንድም ፤ ለሰው ፡ የሚደረገው
ረድኤቱ ፡ መጣ ፤
ወርእኩ ፡ እስከ ፡ መጽአ ፤ ኀቤሆሙ
ዝኩ ፤ እግዚእ ፡ አግባዕ ፡ በመዓት ፤
ይህም ፡ የእስራኤል ፡ ጌታ
እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡
በመዓት ፡ እስከ ፡ መጣ ፡ ድረስ ፡
ደርሼ ፡ አየሁ ፤
፶ ፤ ወእለ ፤ ርእይዎ ፤ ኵሎሙ ፡
ነፍፁ ፤
ያዩትም ፡ አይሁድ ፡ ሁሉ ፡ ሸሹ ፤
መነሣ ፡ ተንሥሡ ፡ ባለ ፡ጊዜ ፡
እንደ ፤ ሻሽ ፤ ተነጠፉ ፡ እንደ
ቅጠል ፡ ረገፉ ፤
ወወድቁ ፡ ኵሎሙ ፡ ውስተ ፡ ጸላ
ሎቱ ፡ እምቅድመ ፡ ገጹ ፤
በረቂቅ ፡ ሥልጣኑ ፡ ወደቁ ፤
ወኵሎሙ ፡ አንሥርት ፤ ወአውስት ፤
ወቋዓት ፤ ወሆባይ ፤ ተጋብኡ ፤
የሞዓብ ፤ የአሞን ፤ ሰዎች ፤
ሁሉ ፤ ሌሎች ፡ አሕዛብም ፡
ሮማውያንም ፡ ተሰበሰቡ ፤

፶፩ ፤ ወአምጽኡ ፡ ምስሌሆሙ ፡
ኵሎ ፡ አባግዐ ፡ ገዳም ፤
አራቱ ፡ ቤት ፡ ጭፍራ ፡ እስራ
ኤልን ፡ አመጡ ፤ ይህስ ፤ ባለ
ቤቶች ፡ እስራኤል ፤ ናቸው ፡፡
ብሎ ፤ እስራኤል ፡ አራቱን ፡ ቤት፡
ጭፍራ ፤ ሮማውያንን ፡ አመጡ፤
ወመጽኡ ፡ ኵሎሙ ፡ ኅቡረ ፡
ወተራድኡ ፡ ከመ ፡ ይቀጥቅጥዎ ፤
ለቀርኑ ፡ ዝኩ ፡ ዳቤላ ፤
ሁሉም ፡ አንድ ፡ ሁነው ፡ መጡ ፤
የዚህን ፡ የክርስቶስን ፡ ሥልጣን ፡
ያርቁ ፤ ዘንድ ፤ ተረዳዱ ፤
፶፪ ፤ ወርኢክዎ ፡ ለዝኩ ፡ ብእሲ ፡
ዘይጽሕፍ ፡ መጽሐፈ ፡ በቃለ ፡
እግዚእ ፤
በጌታ ፡ ቃል ፡ መጽሐፉን ፤ የሚ
ጽፍ ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤልን፡አየሁ፤
እስከ ፡ ፈትሐ ፡ ለውእቱ ፡ መጽሐፈ
ኀጕል ፡ ዘአኀጐሉ ፡ እልኩ ፡ ዐሠርቱ
ወክልኤቱ ፡ ኖሎት ፡ ደኃርያን ፤
አሥራ ፡ ሁለቱ ፤ ነገሥተ ፡ ባቢ
ሎን ፡ ሰውን ፡ ያጠፉበት ፤ ኃጢ
አት ፤ የተጻፈበትን ፡ መጽሐፍ ፡
እስከ ፡ ዘረጋው ፡ (እስኪ ፡ ገል
ጠው) ፡ ድረስ ፡ ደርሼ ፡ አየሁ ፤
፶፫ ፤ ወአርአየ ፡ ከመ ፡ ፈድፋደ ፡
እምቅድሜሆሙ ፡አኅጐሉ ፤ በቅድመ ፡
እግዚእ ፡ አባግዕ ፤
ኋለኞች ፤ የሚሆኑ ፡ ሁለቱ ፤ ከፊ
ተኞች ፡ ይልቅ ፡ ከፉ ፤ ሥራ ፡

እንደሠሩ ፤ እንዳጠፉ ፡ አስረዳ ፤ ዋዌው ፡ ቀሪ ፡ ነው ፤ ሁለት ፡ የተባሉ ፡ ሐና ፡ ቀያፋ፤ አንድም ፡ ሄሮድስ ፤ ጲላጦስ ፤ አንድም ፡ ይሁዳ ፡ ዲያብሎስ ፡ ናቸው ፤

ወርኢኩ ፡ እስከ ፡ መጽአ ፡ ኀቤሆሙ ፡ እግዚእ ፡ አባግዕ ፤

የእስራኤል ፡ ገዥ ፤ እግዚአብሔር ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ እስኪ ፡ መጣ ፡ ድረስ ፡ ደርሼ ፡ አየሁ ፤

፶፯ ፤ ወነሥአ ፡ በእዴሁ ፡ በትረ ፡ መዓቱ ፤

ቁጣውን ፤ የሚፈጽምበት ፤ በትሩን ፡ አነሣ ፤ ቁጣውን ፡ የሚፈጽምበትን ፤ ሥልጣን ፡ በቃሉ ገለጸ ፤

ወዘበጣ ፡ ለምድር ፡ ወተሠጠት ፤ ምድር ፤

ምድርን ፡ መታት ፤ ተከፈተችም ፤

ወኵሎሙ ፡ አዕዋፈ ፡ ሰማይ ፡ ወአራዊት ፤

አሕዛብም ፡ ሁሉ ፤ እስራኤልም ፡ ሁሉ ፤

ወድቁ ፡ እምእልኩ ፡ አባግዕ ፡ ወተሠጥሙ ፡ በምድር ፡ ወተከድነት ፡ ዲቤሆሙ ፤

ከእኒህ ፤ ከአይሁድ ፡ ወገኖች ፡ ከምእመናን ፡ ሐዋርያት ፡ ተለይተው ፤ በምድር ፡ ሰጠሙ ፤ ምድርም ፡ ተጫነቻቸው ፤

፶፰ ፤ ወርኢኩ ፡ እስከ ፡ ተውህበ ፡ ለአባግዕ ፡ ሰይፍ ፡ ዓቢይ ፤

ለሐዋርያት ፡ ሥልጣን ፡ እስከ ፡ ተሰጣቸው ፡ ድረስ ፡ ደርሼ ፡ አየሁ ፤

ወወፅኡ ፡ አባግዕ ፡ [redacted] ፡ እሉ ፡ አራዊተ ፡ ገዳም ፡ ከመ ፡ ይቅትልዎሙ ፡

ሐዋርያትን ፡ ይገድሏቸው ፡ ዘንድ ፡ አሕዛብ ፡ ወጡ ፤ አንድም ፡ ሐዋርያት ፡ አሕዛብን ፡ በሌጌዎን ፤ ነጽተው ፡ በነፋስ ፤ አውታር ፡ ሰቅለው ፡ ይገድሏቸው ፡ ዘንድ ፡ ወጡ ፤

፶፱ ፤ ወኵሎሙ ፡ አራዊት ፡ ወአዕዋፈ ፡ ሰማይ ፡ ነፍጹ ፡ እምቅድመ ፡ ገጾሙ ፤

አሕዛብ ፡ እስራኤል ፡ ከሐዋርያት ፡ ፊት ፡ ሸሹ ፡፡

## ምዕራፍ ፹፱
## ጉባኤ

[redacted] ፤ ወርኢኩ ፤ እስከ ፡ መንበር ፡ ተሐንፀ ፤ በምድር ፡ ሐዋዝ ፤

አንተ ፡ ትውኀዝ ፡ / ታውኀዝ/ ፡ ሀሊበ፡ በተባለች ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ደብተራ ፡ ኦሪት ፡ እስከ ፡ ተተከለች ፤ ቤተ ፤ መቅደስ ፡ እስከ ፡ ተሠራች ፡ ድረስ ፡ ደርሼ ፡ አየሁ ፤

ወነበረ ፡ ዲቤሁ ፡ እግዚእ ፡ አባግዕ ፤ ጌታ ፤ በረድኤት ፤ ተቀመጠባት ፤ እንድም ፤ በንጽሕና ፤ በድንግልና ፡ በተዘጋጀች ፤ ክብርት ፡ በሆነች ፡ በእመቤታችን ፡ በማሕፀነ ፡ ማርያም ፡ ሲዘጋጅ ፡ አየሁ ፤ ወነበረ ፤ ጌታ ፡ አደረ ፤ እንድም ፡ በማዕከለ ፡ ምድር ፤ በቀራንዮ ፡ መስቀል ፡ ሲዘጋጅ ፡ አየሁ ፤ ወነበረ ፡ ጌታ ፡ ተሰቀለበት ፤ እንድም ፡ ባማረ ፡ በተወደደ ፡ በሰማይ ፤ መካከል ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይን ፡ ተዘጋጅቶ ፡ አየሁ ፤ ወነበረ ፡ ጌታ ፡ ጻድቃንን ፡ ይዞ ፡ ተቀመጠ ፤

■ ፤ ወነሥአ ፡ ኵሎን ፡ መጻሕፍተ ፡ ኅቱማተ ፤

የታተሙ ፡ /የተጻፉ/ ፡ መጻሕፍትን ፡ ያዘ ፤

ወፈትሖን ፡ ለእማንቱ ፡ መጻሕፍት ፡ በቅድመ ፡ እግዚእ ፡ አባግዕ ፤

እነዚህን ፡ የተጻፉ ፤ መጻሕፍትን ፡ በእስራኤል ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ ገለጻቸው ፤ በዕለተ ፡ ምጽአት ፡ ብሉያት ፤ ሐዲሳት ፡ እየተነበቡ እየተተረጐሙ ፤ በዚያ ፡ የተጻፈውን ፤ ምግባር ፤ ሃይማኖት የሠራ ፤ በዚያ ፡ የተጻፈውን ፡ ዋጋ ፤ በዚያ ፡ የተጻፈውን ፡ ኃጢአት ፡ የሠራ ፤ በዚያ ፡ የተጻፈውን ፤ ፍዳ ፤ ይቀበላልና ፤ በዚያስ ፡ ጊዜ ፡ መነበብ ፤ መተርጐም ፡ የለም ፡ ብሎ ፤ ዛሬ ፡ የሚነበበው ፤ የሚተረጐመው ፤ የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ዋጋው ፡ የሚፈጸም ፡ ስለሆነ ፤ እንድም ፡ ወነሥአ ፤ ምሥጢራቸው ፡ የተሰወረ ፡ መጻሕፍተ ፡ ነቢያትን ፡ ገንዘብ ፡ አደረገ ፤ ወፈትሖን ፤ ፈጸማቸው ፤ እንድም ፡ ወነሥአ ፤ ምግባረ ፡ ኃጥአንን ፤ ምግባረ ፤ ጻድቃንን ፡ መረመረ ፤ ወፈትሖን ፡ ገለጻቸው ፤

■ ፤ ወጸውዖሙ ፡ እግዚእ ፡ ለእልኩ ፯ቱ ፡ ጸዓድው ፡ ቀዳማውያን ፤

ጌታ ፡ በክብር ፡ የሚበልጡ ፡ ሰባቱን ፡ ሊቃነ ፡ መላእክት ፡ ጠራቸው ፤

ወአዘዞ ፡ ከመ ፡ ያምጽኡ ፡ ቅድሜሁ እምኮከብ ፡ ቀዳማዊ ፡ ዘይቀድም ፡ እምእልኩ ፡ ከዋክብት ፡ እለ ፡ ኀፍረቶሙ ፡ ከመ ፡ ኀፍረተ ፡ አፍራስ ፤

ኀፍረታቸው ፡ እንደ ፡ ፈረስ ፡ ኀፍረት ፡ የሆነ ፡ ከእነዚህ ፡ ከደቂቀ ፡ ሴት ፡ የሚቀድም ፡ ቀዳማዊ ፡ ከሚሆን ፡ /መጀመሪያ/

የተሾመ ፡ ከስማያዛ ፡ ጀምሮ ፡ ያመጡ ፡ ዘንድ ፡ አዘዛቸው ፤

፬ ፤ ወለከከብ ፡ ቀዳማዊ ፡ ዘወድቀ ፡ ቅድመ ፤

አስቀድሞ ፡ የወረደ ፡ /የወደቀ/ ፡ መጀመሪያ ፡ የተሾመ ፡ ዲያብሎስን ፡ ያመጣው ፡ ዘንድ ፡ አዘዘ ፤

ወእምጽእዎሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ ቅድሜሁ ፤

ሌሎቹንም ፡ ሁሉ ፡ ወደእርሱ ፡ አመጧቸው ፤

፭ ፤ ወይቤሎ ፡ ለዝኩ ፡ ብእሲ ዘይጽሕፍ ፡ በቅድሜሁ ፡ ዘውእቱ ፡ ፩ዱ ፡ እምሰብዓቱ ፡ ጸዓድው ፤

ባለ ፡ አእምሮ ፡ ከሆኑ ፡ ከሰባቱ ሊቃነ ፡ መላእክት ፡ አንድ ፡ የሚሆን ፤ በእርሱ ፡ ፊት ፡ የነገሥታቱን ፡ ግፍ ፡ የሚጽፍ ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤልን ፤

፮ ፤ ወይቤሎ ፡ ንሥኦሙ ፡ ለእሉ ፡ ፸ ፡ ኖሎት ፡ እለ ፡ መጠውክዎሙ ፡ አባግዐ ፤

ቅዱስ ፡ ሚካኤልን ፡ እስራኤልን ፡ ጠብቁ ፡ ብዬ ፡ የሰጠኋቸውን ፡ ሰባ ፡ ኖሎት ፡ ሰባውን ፡ መምህራን ፡ ያዝ ፡ አሰው ፤

ወነሢኦሙ ፡ ቀተሉ ፡ ብዙኀ ፤

ሕዝቡን ፤ ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡ ተቀብለው ፡ ያጠፉ ፡ ነገሥታቱን ፤ መምህራኑን ፡ ያዝ ፡ አሰው ፤

እምዘ ፡ አዘዝክዎሙ ፡ እሙንቱ ፤

ካዘዝኋቸው ፡ ወጥተው ፤ እንድም ፡ አትርፈው ፡ ያጠፉ ፡ ነገሥታትን ፤

፯ ፤ ወናሁ ፡ ለኵሎሙ ፡ እሡራኒ ፡ ርኢክዎሙ ፤

ነገሥታቱ ፤ መምህራኑ ፤ ሁሉ ፡ ታሥረው ፤ ተግዘው ፡ አየኋቸው ፤

ወቆሙ ፡ ቅድሜሁ ፡ ኵሎሙ ፤

ሁሉም ፡ በፊቱ ፡ ቆሙ ፤

ወኮነኔ ፡ ኮነ ፡ ቅድመ ፡ እምከዋክብት ፤

አስቀድሞ ፡ ፍርድ ፡ በደቂቀ ፡ ሴት ፡ ተጀመረ ፤

ወተኰነኑ ፤

ተመረመሩ ፤ ተወቀሱ ፤

ወኮኑ ፡ ኃጥአነ ፤

ኃጢአተኞች ፡ ሁነው ፡ ተገኙ ፤

ወሖሩ ፡ መካነ ፡ ኰነኔ ፤

ይሙት ፡ በቃ ፡ ወደ ፡ ተፈረደበት ፡ ቦታ ፡ ሄዱ ፤

፰ ፤ ወወደይዎሙ ፡ ውስተ ፡ ዕሙቅ፡ ወምሉእ ፡ እሳተ ፡ ዘይልህብ ፡ ወምሉእ ፡ ዓምደ ፡ እሳት ፤

መላእክትም ፡ ወደ ፡ ጥልቅ ፡ ገሃነም ፡ ጣሏቸው ፤ ያም ፡ ቦታ ፡ ፈጽሞ ፡ የሚያላልብ ፡ የእሳት ፡ ምሰሶ ፡ የተመላ ፡ ነው ፤

፱ ፤ ወእልክቱ፡ ፸ ፡ ኖላውያን ፡ ተኰነኑ ፤

እነዚያም ፡ ስባው ፡ ነገሥታት ፤ መምህራን ፤ ተመረመሩ ፡ (ተወቀሰ)፤
ወኮኑ ፡ ኃጥአነ ፤
ኃጢአተኞችም፡ ሁነው ፡ተገኙ ፤
ወተወድዩ ፡ እሙንቱ ፡ ውስተ ፡ ዝንቱ ፡ ማዕምቀ ፡ እሳት ፤
እነርሱም ፡ ወደዚህ ፡ ጥልቅ ፡ ገሃነም ፡ ወደቁ ፤
፲ ፤ ወርኢኩ ፡ በውእቱ ፡ ጊዜ ፡ ከመ ተርኅወ ፡ እሐዱ ፡ ማዕምቅ ፡ ከማሁ፡ በማዕከለ ፡ ምድር ፡ ዘምሉዕ ፡ እሳተ፤
አንድ ፡ ጕድጓድ ፡ እንደተከፈተ ፡ አየሁ ፤ ፪ኛ ፡ ገሃነም ፡ ኑሮ ፡ አይደለም ፤ በመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ብዙ ፡ መዓርግ ፡ ክብር እንዳለ ፤ በገሃነምም ፡ ብዙ ፡ ጽኑዕ ፡ መዓርግ ፡ ዙነኔ ፡ አለና ፤
፲፩ ፤ ወአምጽእዎሙ ፡ ለእልኩ ፡ አባግዕ ፡ ጽሉላን ፤
በድንቁርና ፡ የተያዙ ፡ እነዚህንም ፡ አይሁድን ፡ ወደዚያ ፡ ቦታ ፡ አመጧቸው ፤
ወተኰነኑ ፡ ኵሎሙ ፤
ሁሉም ፡ ተመረመሩ ፤
ወኮኑ ፡ ኃጥአነ ፤
ኀጥአን፡ ሁነው ፡ ተገኙ ፤
ወተወድዩ ፡ ውስተ ፡ ዝንቱ ፡ ዕመቀ እሳት ፡ ወውዕዩ ፤
እሳት ፡ ባለበት ፡ በዚህ ፡ በገሃነም ፡ ወድቀው ፡ ተቃጠሉ ፤

፲፪ ፤ ወዝንቱ ፡ ማዕምቅ ፡ ከነ ፡ በየማኑ ፡ ለዝኩ ፡ ቤት ፤
ይህ ፡ ገሃነም ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ቀኝ ፡ ሆነ ፡ አለ ፤ ሠለጠነ፤ሲል ፡ ነው ፤ መንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ከሚገቡት ፡ ገሃነም ፡ የሚወርዱት ፡ ይበዛሉና ፤
ወርኢክዎሙ ፡ ለእልኩ ፡ አባግዕ ፡ እንዘ ፡ ይውዕዩ ፤
እነዚህንም ፡ አይሁድ ፡ በገሃነም ፡ ሲቃጠሉ ፡ አየሁ ፤
ወአዕጽምቲሆሙ፡ ይውዒ፤
ወገናቸው ፡ ሁሉ ፡ በገሃነም ፡ ይቃጠላል ፤
፲፫ ፤ ወቆምኩ ፡ እርአይ ፡ እስከ ፡ ጠወም ፡ ለዝኩ ፡ ቤት ፡ ብሉይ ፤
ይህን ፡ ያረጀውን ፡ ዓለም ፡ ሕገ ኦሪት ፡ እስኪያሳልፈው ፡ ድረስ ደርሼ ፡ አየሁ ፤
ወአውፅእዎሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ አዕማድ ፤
ምሰሶዎችንም ፡ ሁሉ ፡(ነቢያት ካህናትን) ፡ አወጣቸው ፤ እሉ ፡ እሙንቱ ፡ እለ ፡ ይረብብዋ ፡ ለል ዕልና ፡ ሰማይ[^1] ፡ እንዲል ፤
፲፬ ፤ ወኵሉ ፡ ተክሉ ፤
አዝርዕት ፤ አትክልት ፤ አበባው ፡ አገዳው ፡ ሁሉ ፡ ያልፋል ፤
ወሰኑ ፡ ለውእቱ ፡ ቤት ፡ ተጠውመ ፡ ምስሌሁ ፤
የዚያም ፡ ቤት ፡ ጌጡና ፡ ተክሉ ሁሉ ፡ ሥርዓተ ፡ ኦሪት ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ፈረሰ ፤ (አለፈ)፤

[^1]: ፩ ፡ ሄኖ. ፰፥፲፰—

ወአውፅኦሙ ፡ ወወደይዎሙ ፡ በ፩ዱ ፡
መካን ፡ በየማነ ፡ ምድር ፡
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ቀኝ ፡ ባለ ፡ አንድ ፡
ቦታ ፡ አውጥተው ፡ ጣሉት ፡
(አንድ ፡ ያዕቆብ) ፡ አንድም ፡
ሰማይን ፡ ምድርን ፡ በፈጠረበት ፡
ሥልጣን ፡ አሳለፈው ፡

፳፰ ፡ ወርኢኩ ፡ እግዚአ ፡ አባግዕ ፡
እስከ ፡ አምጽአ ፡ ቤተ ፡ ሐዲሰ ፡
የእስራኤል ፡ ገዥ ፡ እግዚአብሔ
ርም ፡ አዲስ ፡ የሆነ ፡ መንግ
ሥተ ፡ ሰማይን ፡ አመጣ ፡
ወዓቢየ ፡ ወልዑለ ፡ እምነ ፡ ዝንቱ ፡
ቤት ፡ ቀዳማይ ፡
ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ፈጽሞ ፡ የሚበ
ልጥ ፡ ሐዲስ ፡ የሆነ ፡ ቤትን ፡
አምጥቶ ፡ እስኪሠራ ፡ ድረስ ፡
ደርሼ ፡ አየሁ ፡
ወአቀሞ ፡ ውስተ ፡ መካነ ፡ ቀዳሚት
እንተ ፡ ተጠብለለት ፡
በአለፈው ፡ በቀደመችዪቱ ፡ ዓለም ፡
ምትክ ፡ አምጥቶ ፡ አጸናው ፡

፳፱ ፡ ወኵሎሙ ፡ አዕማደ ፡ ዚአሃ ፡
ሐዲሳን ፡
በውስጧ ፡ ያሉ ፡ ጻድቃን ፡ ሐዲ
ሳን ፡ ናቸው ፡
ወሰና ፡ ሐዲስ ፡ ወዓቢይ ፡ እምቀ
ዳሚት ፡ ብሊት ፡ እንተ ፡ አውጽአ ፡
ጌጧም ፡ ሁሉ ፡ አዲስ ፡ ነው ፡
ቀድሞ ፡ አርጅታ ፡ ካፈረሳትም ፡
ቤት ፡ ይልቅ ፡ ታላቅ ፡ ነው ፡
ወኵሎሙ ፡ አባግዕ ፡ ማእከላ ፡
ጻድቃን ፡ በመካከሏ ፡ አሉ ፡ አን
ድም ፡ እስከ ፡ ጠወማ ፡ ለዛ ፡ ኦሪ
ትን ፡ አንድም ፡ ደብተራ ፡ ኦሪ
ትን ፡ እስኪያሳልፈው ፡ ድረስ ፡
ደርሼ ፡ አየሁ ፡
አዕማድ ፡ የደብተራ ፡ ኦሪት ፡ ካህ
ናቷን ፡ የኦሪት ፡ ሕግን ፡ ሥር
ዓቷን ፡ እስኪያሳልፈው ፡ ድረስ ፡
ደርሼ ፡ አየሁ ፡ ተክሉ ፡ ወሰኑ ፡
የደብተራ ፡ መሥዋዕቱን ፡ የኦ
ሪት ፡ ሥርዓቷን ፡ አሳለፈው ፡
በ፩ዱ ፡ መካን ፡ በያዕቆብ ፡ ልጆች ፡
ብቻ ፡ እንድትነገር ፡ አደረጋት ፡
ቤተ ፡ ሐዲስ ፡ በኦሪት ፡ ወንጌልን ፡
በደብተራ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡
ተካት ፡ ውስተ ፡ መካነ ፡ ቀዳ
ሚት ፡ ባለፈችው ፡ በቀደመ
ችው ፡ በኦሪት ፡ ወንጌልን ፡ በደብ
ተራ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ ተካት ፡
ሐዲሳን ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡
አዕማዷ ፡ ሐዋርያት ፡ ሐዲሳን ፡
ናቸው ፡ ወሰና ፡ ሐዲስ ፡ ጌጧ ፡
ሥርዓቷ ፡ እንግዳ ፡ ሐዲስ ፡ ነው ፡
ወኵሎሙ ፡ አባግዕ ፡ ማእከላ ፡
ምዕመናን ፡ በመካከሏ ፡ ናቸው ፡

፴ ፡ ወርኢክዎሙ ፡ ለኵሎሙ ፡
አባግዕ ፡ እለ ፡ ተርፉ ፡
ከሞት ፡ የቀሩ ፡ እስራኤልንም ፡
ሁሉ ፡ አየኋቸው ፡

ወኵሎሙ ፡ እንስሳ ፡ ዘዲበ ፡ ምድር ፤
በዚህ ፡ ዓለም ፡ የቀሩ ፡ ምዕመ
ናን ፡ እስራኤል ፡ ሁሉ ፤
ወኵሉሙ ፡ እንስሳ ፡ ዘዲበ ፡ ምድር ፡
በምድር ፡ ላይ ፡ የሚኖሩ ፡ እን
ስሳ ፤ ምዕመናን ፡ አሕዛብ ፤
፲፰ ፡ ወኵሎሙ ፡ አዕዋፈ ፡ ሰማይ ፡
ከሰማይ ፡ በታች ፡ ያሉ ፡ አሕዛብ ፡
ሁሉ ፤
ይወድቁ ፡ ወይሰግዱ ፡ ለእልኩ ፡
አባግዕ ፤
በዓፀደ ፡ ነፍስ ፡ ላሉ ፡ ጻድቃን ፡
ይሰግዳሉ ፤
ወያስተበቍዕዎሙ ፡ ወይሰምዕዎሙ ፡
በኵሉ ፡ ቃል ፤
ኵሉ ፡ ቃለ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ የለመ
ኗቸውን ፡ ሁሉ ፡ ይሰሟቸዋል ፤
፲፱ ፤ ወእምኔሁ ፡ እልክቱ ፡ ፫ቱ ፡
እለ ፡ ይለብሱ ፡ ጸዓድወ ፡ ወእለ ፡
ቀዲሙ ፡ አዕረጉኒ ፡ አኀዙኒ ፡ በእዴየ ፤
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ነጭ ፡ ልብስ
የለበሱ ፡ አስቀድመውም ፡ ወደ
ሰማይ ፡ ያወጡኝ ፡ ሦስቱ ፡ መላ
እክት ፡ እጄን ፡ ያዙኝ ፤
፳ ፡ ወአዶሁ ፡ ለውእቱ ፡ ዳቤላ ፡
እንዘ ፡ ትእኀዘኒ ፡ አዕረጉኒ ፤
የዚያም ፡ የጌታ ፡ ሥልጣኑ ፡
ይዛኝ ፡ አወጡኝ ፤
ወአንበሩኒ ፡ ማዕከሉሙ ፡ ለእልኩ ፡
አባግዕ ፡ እንበለ ፡ ትኩን ፡ ኵነኔ ፤

ፍርድ ፡ ሳትደረግ ፡ አውጥተው ፡
በእኒህ ፡ ሐዋርያት ፡ መካከል ፡
አኖሩኝ ፤
፳፩ ፡ ወእልኩ ፡ አባግዕ ፡ ኵሉሙ ፡
ኮኑ ፡ ጸዓዳ ፤
እነዚያም ፡ ሐዋርያት ፡ ሁሉ ፡
ባለ ፡ አእምሮ ፡ ሆኑ ፤
ወጸጕሪ ፡ ዚአሆሙ ፡ ዓቢይ ፡ ወንጹሕ ፤
ጸጋ ፡ ክብራቸው ፡ ደግ ፡ ነው ፤
ብዙ ፡ ነው ፤
፳፪ ፡ ወኵሉሙ ፡ እለ ፡ ተኃጕሉ ፤
የሞቱት ፤
ወተዘርዘሩ ፤
የተበተኑ ፤
ወኵሉ ፡ አራዊተ ፡ ገዳም ፤
በምድረ ፡ በዳ ፡ የጠፉ ፤ አራዊት ፡
የበሏቸው ፡ ሁሉ ፤
ወኵሉ ፡ አዕዋፈ ፡ ሰማይ ፡ ተጋብኡ
በውእቱ ፡ ቤት ፤
በኢየሩሳሌም ፡ የነበሩ ፡ እስራኤ
ልም ፡ ሁሉ ፤ በዚህ ፡ ቤተ ፡ መቅ
ደስ ፡ አንድም ፡ በምጽአት ፡ ይት
ጋብኡ ፡ ይሰበሰባሉ ፤
፳፫ ፤ ወእግዚእሙ ፡ ለአባግዕ ፡ ተፈ
ሥሐ ፡ ዓቢየ ፡ ፍሥሓ ፤
የእስራኤል ፡ ገዥ ፡ እግዚአብሔ
ርም ፡ ታላቅ ፡ ደስታ ፡ ደስ ፡ አለው ፤
እስመ ፡ ኮኑ ፡ ኵሉሙ ፡ ኄራነ ፤
ሁሉም ፡ ደጋግ ፡ ሆነዋልና ፤

ወንብሉ ፡ ውስተ ፡ ቤቱ ፡፡
ወደ ፡ ማደሪያው ፡ ቤተ ፡ መቅ
ደስም ፡ ተመልሰዋልና ፡፡
፴፬ ፡፡ ወርኢኩ ፡ እስከ ፡ አሰከብዎ ፡
ለውእቱ ፡ ሰይፍ ፡ ዘተውህበ ፡ ለአባ
ግዕ ፡፡
ለሐዋርያት ፡ የተሰጠውን ፡ ሥል
ጣን ፡ ለጌታ ፡ እስኪመልሱ ፡
ድረስ ፡ ደርሼ ፡ አየሁ ፡፡
ወአግብዕዎ ፡ ውስተ ፡ ቤቱ ፡፡
ወደእፎቱ ፡ አገቡት ፡ ማለት ፡፡
ሥልጣኑን ፡ ለጌታ ፡ መለሱ ፡፡
ወሐተማ ፡ ቅድመ ፡ ገጹ ፡ ለእግዚእ ፡፡
በጌታም ፡ ፊት ፡ ጠቅልሉ ፡ አተ
ማት ፡፡ አንድም ፡ ሥልጣኑን ፡
ገንዘብ ፡ አደረጋት ፡፡
፴፭ ፡፡ ወኵሎሙ ፡ አባግዕ ፡ ተዐፅዉ ፡
በውእቱ ፡ ቤት ፡፡
እስራኤልም ፡ ሁሉ ፡ በዝተው ፡
በዚያ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ሥር
ዓት ፡ ተዘጋባቸው ፡፡ መዘጋትስ
የለም ፡፡ መውጣት ፡ መግባት ፡
አለመኖሩን ፡ መናገር ፡ ነው ፡፡
ወኢያግመርሙ ፡፡
አልቻላቸውም ፡፡ ብዛታቸውን ፡
መናገር ፡ ነው ፡፡
ወአዕይንቲሆሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ ተከሥታ ፡፡
የሁሉም ፡ ዓይነ ፡ ልቡናዎቻቸው ፡
ተገልጠው ፡፡
ወይኔጽሩ ፡ ሠናየ ፡፡
በጎ ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ይመለከቱ ፡
ነበር ፡፡
ወአሐዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዘኢይሬኢ ፡
አልቦ ፡ በማእከሎሙ ፡፡
ከእነሱም ፡ መካከል ፡ አንዱ ፡ ምሥ
ጢረ ፡ ሰማይን ፡ የማያይ ፡ የማያ
ውቅ ፡ የለም ፡፡
፴፮ ፡፡ ወርኢኩ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡
ቤት ፡ ኮነ ፡ ዓቢየ ፡ ወርጉበ ፡ ወምሉዐ ፡
ፈድፋደ ፡፡
ያም ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ታላቅ ፡
ሰፊም ፡ ምስጋና ፡ የተመላ ፡ ሆኖ ፡
አየሁት ፡፡
ወርኢኩ ፡ ከመ ፡ ተወልደ ፡ ፩ዱ ፡
ላሕም ፡ ጸዓዳ ፡፡
አንድ ፡ ጌታ ፡ ክርስቶስ ፡ ከእመ
ቤታችን ፡ እስከ ፡ ተወለደ ፡ ድረስ ፡
ደርሼ ፡ አየሁ ፡፡ ጸዓዳ ፡ ንጹሐ ፡
ባሕርይ ፡ የሚሆን ፡ ጌታ ፡፡
ወአቅርንቲሁ ፡ ዓበይት ፡፡
ደቀ ፡ መዛሙርቶቹ ፡ ሐዋርያት ፡
ደጋጎች ፡ ናቸው ፡፡
፴፯ ፡፡ ወኵሎሙ ፡ አራዊተ ፡ ገዳም ፡፡
ምዕመናን ፡ አሕዛብ ፡፡
ወኵሉ ፡ አዕዋፈ ፡ ሰማይ ፡፡
ምዕመናን ፡ እስራኤል ፡፡
ይፈርህዎ ፡፡
ይፈሩታል ፡ ያመልኩታል ፡፡
ወያስተበቍዕዎ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ፡፡
በየጊዜው ፡ ይለምኑታል ፡፡
፴፰ ፡፡ ወርኢኩ ፡ እስከ ፡ ተወለጠ ፡
ኵሉ ፡ አዝማዲሆሙ ፡፡
ሐዋርያት ፡ ያስተማሯቸው ፡ የም
ዕመናን ፡ ወገኖች ፡ እስኪያምኗቸው ፡

በዕውቀት ፡ እስከ ፡ ተለወጠ ፡ ድረስ ፡ ደርሼ ፡ አየሁ ፤

ወኮኑ ፡ ኵሎሙ ፡ አልሕምት ፡ ፀዓድወ ፤

ሐዋርያት ፡ ያስተማሯቸው ፡ ምዕመናን ፡ ባለ ፡ አእምሮ ፡ እስቲሆኑ ፡ ድረስ ፡ ደርሼ ፡ አየሁ ፤ አንድም ፡ ከመ ፡ ተወልደ ፤ በሐሳዊ ፡ መሢሕ ፡ ጊዜ ፡ አምላክነቱን ፡ እስኪገልጽ ፡ ድረስ ፡ ደርሼ ፡ አየሁ ፤ ወአቅርንቲሁ ፤ ሄኖክ ፡ ኤልያስ ፡ ባለ አእምሮ ፡ ደጋጎች ፡ ናቸው ፤ አራዊት ፡ ምዕመናነ ፡ አሕዛብ ፡ ወአዕዋፍ ፤ እነርሱ ፡ ያስተማሯቸው ፡ ምዕመናን ፡ እስራኤል ጌታን ፡ ያመልኩታል ፤ እስከ ፡ ተወለጠ ፡ አዝማዲሆሙ ፤ የምዕመናን ፡ ወገኖቻቸው ፡ በአዕምሮ ፡ እስከ ፡ ተለወጡ ፡ ድረስ ደርሼ ፡ አየሁ ፤ ወኮኑ ፡ ጸዓድወ ፤ ሄኖክ ፡ ኤልያስ ፡ ያስተማሯዋቸው ፡ ምዕመናን ፡ ባለ ፡ አእምሮ ፡ ሆኑ ፤

[illegible] ፤ ወቀዳማዊ ፡ ኮነ ፡ በማእከሎሙ ፡ ነገረ ፤

ይኸውም ፡ ሐሳዊ ፡ መሢሕ ፡ ዲያብሎስ ፡ በጻድቃን ፡ ዘንድ ፡ ዋዛ ፤ በኃጥአን ፡ በመናፍቃን ፡ ዘንድ ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ ሆነ ፤

ወውእቱ ፡ ነገር ፡ ኮነ ፡ አርዌ ፡ ዓቢየ ፤ ሐሳዊ ፡ መሢሕ ፡ ዲያብሎስ ፡ የሚያስት ፡ ታላቅ ፡ አውሬ ፡ ሆነ ፤

ወቦ ፡ ውስተ ፡ ርእሱ ፡ አቅርንት ፡ ዓቢያት ፡ ወጸሊማት ፤

ኃጥአን ፡ የሚሆኑ ፡ ሐሳዊ ፡ ሄኖክ ፤ ሐሳዊ ፡ ኤልያስ ፡ ሰሐሳዊ ፡ መሢሕ ፡ አሉት ፤

፴ ፤ ወእግዚእ ፡ አባግዕ ፡ ተፈሥሐ ፡ ዲቤሆሙ ፤

የእስራኤል ፡ ገዢ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በሐሳዊ ፡ ሄኖክ ፡ በሐሳዊ ፡ ኤልያስ ፡ ሞት ፡ ደስ ፡ አለው ፤ አንድም ፡ በምዕመናን ፡ ሞት ፡ ደስ ፡ አለው ፤ ዋጋ ፡ የሚያገኙበት ፡ ነውና ፤

ወዲበ ፡ ኵሎሙ ፡ አልሕምት ፤

በወገኖቻቸው ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ አለው ፤

፴፩ ፤ ወአነ ፡ ሰከብኩ ፡ ማእከሎሙ ፤ እኔም ፡ በመካከላቸው ፡ በሰማዕትነት ፡ ሞትኩ ፤

ወነቃሕኩ ፡ ወርኢኩ ፡ ኵሎ ፤ ተነሥቼ ፡ ሁሉን ፡ አየሁ ፤

[illegible] ፤ ወዝንቱ ፡ ራእይ ፡ ዘርኢኩ ፡ እንዘ ፡ እሰክብ ፤

በቤተ ፡ መላልኤል ፡ ተኝቼ ፡ ሳለሁ ፡ ያየሁት ፡ ራእይ ፡ ይህ ነው ፤

ወነቃሕኩ ፡ ወባረክዎ ፡ ለእግዚእ ፡ ጽድቅ ፡ ወሎቱ ፡ ወሀብኩ ፡ ስብሐተ ፤ ፈታሒ ፡ በጽድቅ ፤ ኩናኒ ፡ በርትዕ ፤ የሚሆን ፡ የክብር ፡

ባለቤት ፡ ጌታን ፡ ተነሥቼ ፡ አመ
ሰገንኩት ፤

፹፫ ፤ ወእምኔሁ ፡ በከይኩ ፡ ብካየ ፡
ዓቢየ ፤

ይህን ፡ ከማየቴ ፡ የተነሣ ፡ ፈጽሜ ፡
አለቀስሁ ፤

ወአንብዕየ ፡ ኢቆመ ፡ እስመ ፡ ኢክህ
ልኩ ፡ ተዐግሦተ ፡ ሰበ ፡ እሬኢ ፡ እንዘ ፡
ይወርዱ ፡ ዲበ ፡ ዝኩ ፡ ዘርኢኩ ፤

ወዳየሁት ፡ ወደዚህ ፡ ገሃነም ፡
ሲወርዱ ፡ ባየሁ ፡ ጊዜ ፡ መታ
ገሱን ፡ አልቻልኩምና ፡ እንባዬ
አልተገታም ፤

፹፬ ፤ እስመ ፡ ኵሉ ፡ ይመጽእ
ወይትፌጸም ፤

ይህ ፡ ሁሉ ፡ ያየሁት ፡ የነፍስ
መከራ ፡ ይመጣልና ፤ ይፈጸ
ማልና ፡ አለቀስሁ ፤

ወኵሉ ፡ በበክፍሉ ፡ ምግባረ ፡ ሰብእ ፡
ተርእየ ፡ ሊተ ፤

የሰው ፡ ሁሉ ፡ ሥራ ፡ በየክፍሉ ፤
በየክፍሉ ፡ በየወገን ፡ በየወገኑ ፡
ታይቶኛልና ፤

፹፭ ፤ በይእቲ ፡ ሌሊት ፡ ተዘከርክዎ ፡
ለሕልምየ ፡ ቀዳማዊ ፤

የእነርሱን ፡ መከራ ፡ ባየሁበት ፡
ሌሊት ፡ ቀድሞ ፡ ያየሁትን ፡ ማየ ፡
አይኅ ፡ አስቤ ፡ ስለእነርሱ ፡ አለቀ
ስሁ ፤

ወበእንቲአሁ ፡ በከይኩ ፡ ወተሐወኩ ፤

ይህንን ፡ ራእይ ፡ አይቻለሁና ፡ ስለ
ዚህ ፡ ነገር ፡ አለቀስሁ ፡ ታወክሁ ፤

እስመ ፡ ርኢኩ ፡ ውእተ ፡ ራዕየ ፤

ይህንን ፡ ራእይ ፡ አይቻለሁና ፤

፹፮ ፤ ወይእዜኒ ፡ ወልድየ ፡ ማቱሳላ
ጸውዕ ፡ ሊተ ፡ ኵሎሙ ፡ አኃዊከ ፤

አሁንም ፡ ልጄ ፡ ማቱሳላ ፡
ወንድሞችህን ፡ ሁሉ ፡ ጥራልኝ ፤

ወአስተጋብእ ፡ ሊተ ፡ ኵሎ ፡ ደቂቀ ፡
እምከ ፤

የእናትህንም ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡
ሰብስብልኝ ፤

እስመ ፡ ቃል ፡ ይጼውዐኒ ፤

አስተምር ፡ የሚል ፡ ቃል ፡
ይጠራኛልና ፤

፹፯ ፤ ወመንፈስ ፡ ተክዕወ ፡ በላዕ
ሌየ ፤

መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ተሠጥቶኛል ፤
ዕውቀት ፡ በዝቶ ፡ ተገልጾልኛልና ፤

ከመ ፡ አርኢክሙ ፡ ኵሎ ፡ ዘይበ
ጽሐክሙ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ፤

እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ ገልጬ ፡ አስተ
ምራችሁ ፡ ዘንድ ፡ እውቀቱ ፡ በእኔ፡
ላይ ፡ በዝቶ ፡ ተሰጠኝ ፤

፹፰ ፤ ወእምኔሁ ፡ ሖረ ፡ ማቱሳላ ፤

እምኔየ ፡ ሖረ ፡ ሲል ፡ ነው ፤
ከእኔ ፡ ተለይቶ ፡ማቱሳላ ፡ሄደ ፤

ወጸውዖሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ አኃዊሁ ፡
ኅቤሁ ፡ ወአስተጋብኦሙ ፡ ለአዝማደ ፡
ዚአሁ ፤

ወንድሞቹን ፡ ሁሉ ፡ ወደእርሱ ፡
ጠራቸው ፤ ዘመዶቹንም ፡ ሁሉ
ወደእርሱ ፡ ሰበሰባቸው ፤

ወተናገርሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ ውሉዱ ፡ ጽድቀ ፤
ልጆቼም ፡ ሁሉ ፡ እውነት ፡ ነገርን ፡ ነገራቸው ፤

፻፱ ፤ ወይቤ ፡ ስምዑ ፡ ደቂቅየ ፡ ኵሎ ፡ ነገረ ፡ አቡክሙ ፡ ወአጽምኡ ፡ በርትዕ ፡ ቃለ ፡ አፉየ ፡ እስመ ፡ አሰምዕ ፡ ዲቤክሙ ፡ ወእነግረክሙ ፤
ልጆቼ ፡ የእኔ ፡ የአባታችሁን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ስሙ ፤ በእናንተ ፡ አዳኝባችኋለሁና ፡ ወዳጆቼ ፡ የሚያገኛችሁንም ፡ መከራ ፡ እነግራችኋለሁና ፡ ካንደበቴ ፡ የወጣውንም ፡ ነገር ፡ በሚገባ ፡ ስሙ ፡ አላቸው ፤

፬ ፤ ፍቁራንየ ፡ አፍቅርዋ ፡ ለርትዕ ፡ ወባቲ ፡ ሑሩ ፤
ወዳጆቼ ፡ የቀናች ፡ ሕግንም ፡ ውደዷት ፤ በእርሷም ፡ ጸንታችሁ ፡ ኑሩ ፤
ወኢትቅረቡ ፡ ኀበ ፡ ርትዕ ፡ በክልኤ ፡ ልብ ፤
ያጸድቀን ፡ አያጸድቀን ፡ በማለት በሁለት ፡ ልብ ፡ ወደ ፡ ሕግ ፡ አትቅረቡ ፤
ወኢትኅበሩ ፡ ምስለ ፡ እለ ፡ በክልኤ ፡ ልብ ፤
ያጸድቀን ፡ አያጸድቀን ፡ ከሚሉ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ አትተባበሩ ፤
አላ ፡ ሑሩ ፡ በጽድቅ ፡ ደቂቅየ ፤
እንጸድቃለን ፡ በማለት ፡ በሕግ ጸንታችሁ ፡ ኑሩ ፡ እንጂ ፤

፻፭ ፤ ወይእቲ ፡ ትመርሐክሙ ፡ በፍናዋት ፡ ኄራት ፤
ኀበ ፡ ፍናዋት ፡ ኄራት ፡ ሲል ፡ ነው ፤ ወደ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ትመራችኋለች ፡
ወጽድቅ ፡ ይከውን ፡ ለክሙ ፡ ሱታፌ ፤
ረድኤት ፡ ክብር ፡ ከእናንተ ፡ ጋራ ፡ ይሆናል ፤
እስመ ፡ አአምር ፡ ከመ ፡ ይጸንዕ ፡ ሀላዌ ፡ ግፍዕ ፡ ዲበ ፡ ምድር ፤
አካለ ፡ ግፍዕ ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ እንዲፀና ፡ አውቃለሁና ፤

፻፮ ፤ ወይትፌጸም ፡ መቅሠፍት ፡ ዓቢይ ፡ ዲበ ፡ ምድር ፡ ወትትፌጸም ኵላ ፡ ዓመፃ ፤
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ፅኑ ፡ መቅሠፍት ፡ ይጨረሳል ፤ ግፍም ፡ ሁሉ ፡ ትጨረሳለች ፡ (ታልፋለች) ፤
ወትትገዘም ፡ እምሥረዊሃ ፤
ኃጢአት ፡ ከሥሯሟ ፡ ተሰይታ ፡ ትጠፋለችና ፤

፻፯ ፤ ወኵሉ ፡ ሕንፃ ፡ የኀልፍ፤ ጥቅመ ፡ ናምሩድ ፡ /ሰናዖር/ ይፈርሳል ፤
ወትደገም ፡ ካዕበ ፡ ዓመፃ ፡ ወትትፌጸም ፡ ዲበ ፡ ምድር ፡ ወትትአኃዝ ኵላ ፡ ግብረ ፡ ዓመፃ ፤
ዳግመኛ ፡ ኃጢአት ፡ ትሠራለች ፤ ግፍ ፡ ሁሉ ፡ ተሠርታ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ትጨረሳለች ፤
ወግብረ ፡ ግፍዕ ፤
አካለ ፡ ግፍዕ ፡ ዳግመኛ ፡ ትሠራለች ፤

ወአበሳ ፡ ካዕበተ ።
በሰናዖር ፡ ኃጢአት ፡ ዕጽፍ ፡
ሁና ፡ ትሠራለች ። ዕጽፍ ፡
ሁና ፡ አሳት ። ሰው ፡ ሲበዛ ፡
ኃጢአትም ፡ ይበዛልና ፤ አንድም ፡
ሰብአ ፡ ትካት ፡ ጌታን ፡ እንውጋ ፡
አሳሉም ። እሊህ ፡ ግን ፡ ጌታን ፡
እንውጋ ፡ ብለዋልና ። ሰብዓ ፡
ትካት ፡ የበደሉ ፡ ሕግ ፡ ተሠር
ቶላቸው ፤ ከሕግ ፡ ወጥተው ፤
ኃጢአት ፡ ሠርተው ፡ የጠፉት ።
አብነት ፡ ባይኖራቸው ፡ ነው ።
እሊህ ፡ ግን ፡ የጠፉ ፡ ሕግ ፡
ተሠርቶላቸው ፤ ከሕግ ፡ ወጥ
ተው ፤ በድለው ፤ የጥፋት ፡
አብነት ፡ ሰብአ ፡ ትካት ፡ እያሏ
ቸው ፡ ነውና ፡ ውስጥ ፡ ለውስጥ፡
ሉባዔ ፡ ይቈጥራል ፤

፯ ፤ ወእመኒ ፡ ትልኅቅ ፡ ዓመፃ ፡
ወኃጢአት ።
ኃጢአት ፡ እየበዛች ፡
ወጽርፈት ፡ ወግፍዕ ፡
ጽርፈት ፡ /ስድብ/ ፡ አካለ ፡ ግፍ ፡
እየበዛች ።
ወኵሉ ፡ ግብር ፡ ወትልሕቅ ፡ ዕልወት ፡
ወአበሳ ፡ ወርኵስ ፤
ክፋውም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ እየበዛ ፤
ወንጀልና ፡ በደልም ፡ እየበዛ ፡
ይህ ፡ ሁሉ ፡ እየበዛ ፤
ወመቅሠፍት ፡ ዓቢይ ፡ ይከውን ፡
እምሰማይ ፡ ዲበ ፡ እሉ ፡ ኵሉሙ ፡
በነዚህ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ከሰማይ ፡
መቅሠፍት ፡ ይመጣል ፤

፰ ፤ ወይመጽእ ፡ እግዚእ ፡ ቅዱስ
በመቅሠፍት ፡ ወበመዓት ፡ ዓቢይ ፡
ከመ ፡ ይግበር ፡ ኵነኔ ፡ ዲበ ፡ ምድር ።
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ፍርድን ይፈ
ርድ ፡ ዘንድ ፡ የከበረ ፡ ጌታ ፡
ተቈጥቶ ፡ በመዓት ፡ በመቅ
ሠፍት ፡ ይመጣል ፤

፱ ፤ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ትት
ገዘም ፡ ግፍዕ ፡ እምነ ፡ ሥረዊሃ ።
በነዚያም ፡ ወራቶች ፡ ሥራ ፡
ከሠሪዎቿ ፡ ተለይታ ፡ ትጠፋ
ለች ፤
ወአሥራወ ፡ ዓመፃ ፡ ምስለ ፡ ጕኅ
ሉት ፡ ወይትነገሉ ፡ እምታሕተ ፡
ሰማይ ፤
ኃጢአት ፡ የሚሠሩ ፡ ሰዎች ፡
ከኃጢአታቸው ፡ ጋራ ፡ ይጠ
ፋሉ ፤
ወኵሉ ፡ ይትወሀብ ፡ ምስለ ፡ አሕዛብ ።
ከሰብአ ፡ ሰዶም ። ከሰብአ ፡
ገሞራ ፡ ጋራ ፡ ይጠፋሉ ፤

፲ ፤ ወማኅፈድ ፡ በእሳት ፡ ትነ
ድድ ።
ሰዶም ። ገሞራ ፡ በእሳት ፡
ትጠፋለች ።
ወያወፅእዎሙ ፡ እምኵሉ ፡ ምድር ።
ከሰው ፡ ለይተው ፡ ያጠፏቸዋል ፤
ወይትገደፉ ፡ በኵነኔ ፡ እሳት ።
በተፈረደባቸው ፡ በእሳት ፡ ይጠ
ፋሉ ።

ወይትኀጕሉ ፡ በመዓት ፤
በቁጣ ፡ ይጠፋሉ ፤
ወበዙኀኔ ፡ ኃያል ፡ አንተ ፡ ለዓለም ፤
ለዘለዓለም ፡ ጸንቶ ፡ በሚኖር ፡ በጽኑ ፡ ፍርድ ፤ አንድም ፡ በኃያል በእግዚአብሔር ፡ ፍርድ ፡ አንድ ሁነው ፡ ይጠፋሉ ፤
፵፰ ፤ ወይትነሣእ ፡ ጻድቅ ፡ እምንዋም ፤
ጻድቅ ፡ ማናቸውም ፤ ጻድቅ ፡ ሎጥ ፡ ከንዋመ ፡ ኃጢአት ፤ ከንዋመ ፡ ሐኬት ፡ ይነሣል ፤ አንድም ፡ ጌታ ፡ ከንዋመ ፡ ትዕግሥት ፡ ይነሣል ፤
ወይትነሣእ ፡ ጥበብ ፡
ጥበብ ፡ ይገለጻል ፡
ወይትወሀብ ፡ ሎሙ ፤
ለሎጥ ፡ ለልጆቹ ፡ ይሰጣል ፤
ወእምኔሁ ፡ ይትገዘሙ ፡ አሥራወ ፡ ዓመፃ ፤
ኃጢአት ፡ የሚሠሩ ፡ ሰብአ ፡ ሰዶም ፤ ሰብአ ፡ ገሞራ ፤ ከሎጥ ፡ ተለይተው ፡ ይጠፋሉ ፤
፵፱ ፤ ወኃጥአን ፡ ይትኀጕሉ ፡ በሰይፍ ፤
ሰብአ ፡ ከነዓን ፡ በሰይፈ ፡ ኢያሱ ፡ ይጠፋሉ ፤
ወእምነ ፡ ጽሩፋን ፡ ይትገዘሙ ፡ በኵሉ ፡ መካን ፤
እግዚአብሔርንም ፡ የሚሳደቡ ፡ ወገኖች ፡ ከየቦታው ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋሉ ፤
፶ ፤ ወእለ ፡ ይሔልይዋ ፡ ለግፍዕ ፡ ወእለ ፡ ይገብርዋ ፡ ለጽርፈት ፡ ይትኀጕሉ ፡ በመጥባሕት ፤
ግፍን ፡ የሚያስቧት ፡ ስድብንም የሚሳደቡ ፡ ሰብአ ፡ ከነዓን ፡ በመጥባሕተ ፡ ኢያሱ ፡ ይጠፋሉ።

## ምዕራፍ ፴፭
## ጉባኤ

፩ ፤ ወእምድኀረዝ ፡ ትከውን ፡ ካልዕት ፡ ሰንበት ፡ ሳምኒት ፡ እንተ ፡ ጽድቅ ፤
እውነተኛ ፡ ምሥጢር ፡ የሚገለጽባት ፡ ሁለተኛ ፡ የምትሆን ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ስምንተኛ ፡ ሱባዔ ፡ ትሆናለች ፤ ካልዕት ፡ ለ፪ኛው ፤ ሳምኒት ፡ ለመጀመሪያው ፡ ነው ፤ ውስጥ ፡ ለውስጥም ፡ ሱባዔ ፡ ሲቈጥር ፡ መጥቶ ፡ ነበርና ፤ ለዚያ ፡ ሳምንት ፤ ካልዕት ፡ እለ ፤ ሱባዔው ፡ የውሉድ ፡ ነውና ፤ ኢዮስያስ ፤ ኢዮአቄም ፡ ኢኮንያን ፤ ሰላትያል ፤ ዘሩባቤል ፤ አብዩድ ፤ ኤልያቄም ፤ ናቸው ፤
ወይትወሀብ ፡ ላቲ ፡ ሰይፍ ፤
ለትሩፍ ፡ ሥልጣን ፡ ይሰጣታል ፤
ከመ ፡ ይትገበር ፡ ኰነኔ ፡ ጽድቅ ፡ እምእለ ፡ ይገፍዑ ፡ ወይትሜጠዉ ፡ ኃጥአን ፡ በእደዊሆሙ ፡ ለጻድቃን ፤
በሚበድሉ ፡ በፋርስ ፡ በባቢሎን ፡ ሰዎች ፡ እውነተኛ ፡ ፍርድ ፡